ቀን፡ 10/11/2012

**በስመ አብ ወወልድ ወመንፈስ ቅዱስ አሐዱ አምላክ አሜን!!**

**"እግዚአብሔርን መፍራት መልካም ነው። ሰው እግዚአብሔርን ፈሪና አስተዋይ ካልሆነ አለቃ ይሆን ዘንድ አይገባውም!!" (ከቅኖና መጻሕፍት ስለ በጎ ፍርሃት ዮሐንስ ፰)**

የተከበራችው የክርስቶስ ቤተሰቦች፤ የርዕሰ አድባራት ለንደን ደብረ ጽዮን ቅድስት ማርያም ቤተ ክርስቲያን አባላትና ወዳጆች።

የምትወዷት፤ የምታከብሯትና የምታስቡላት ቤተ ክርስቲያናችሁ ያለችበትን ወቅታዊ ሁኔታ እንገለጽላችሁ።

ይህ አሁን ያቀረብንላችሁም ሆነ ባለፈው በተከታታይ ያስተላለፍንላችሁ መልዕክቶችና ጠቃሚ መረጃዎች አንዳንዶች ሊያጣጥሉትና ሊያስተባብሉት እንደሚሞክሩት የግል ስሜትም ሆነ የግል ጉዳይ፤ ወይም ጥላቻና ከስም ማጥፋት ጋር የተያያዘ ሳይሆን እውነትና እውነት ብቻ መሆኑን በእውነት ስንል ቃል የምንገባላችሁ ሲሆን የዚህንም መረጃ እውነትነት በተመለከተ በግልና በጋራ በቅርብ በመከታተል ልታረጋግጡ ስለምትችሉ ይህንን ለማድረግ እንዳትሳነፉ በእግዚአብሔር ስም እንማጸናችኋለን።

እንደሚታወቀው ሁሉ በቤተ ክርስቲያናችን ውስጥ ከፍተኛ ተንኮል፤ የስም ማጥፋት ዘመቻ፤ ጭቅጭቅና ንትርክ የበዛበት ወቅት ነው። በመጀመሪያ የሰበካ አስተዳደሩ ምክትል ሊቀ መንበር የሆነው አቶ ታዬ ኃይሉ በገዛ ፍቃዱ ከሥራው ሲለቅ ሌሎችም ጫና የበዛባቸው ምእመናን የሰበካ አስተዳደር ጉባኤ አባላት በተመሳሳይ ሁኔታ በገዛ ፍቃዳቸው ሥራቸውን ለመልቀቅ ወሰኑ።

የዚህ ሁኔታ መፈጠር ደግሞ በሕዝብ ግፊትና ትግል ለቤተ ክርስቲያኗ አባላት ቀርቦ ሕዝቡ ሊወያይበት ሲል በቤተ ክርስቲያኑ አስተዳዳሪና በተወሰኑ ካህናት አሰናካይነት የተጓተተውን የውስጥ መተዳደሪያ ደንብ ረቂቅ የውይይት መርሃ ግብር በማስቀም የግል ዓላማና ዕቅድን ለማሳካት የተመቸ ረቂቅ ለማቅረብ ምቹ ሁኔታ ይፈጥርልኛል በማለት ሁኔታውን ለመጠቀም የተነሳሱት አባ ግርማ ከበደ የተቀሩትን ካህናትና አንድ አንድ የሰንበት ት/ቤት አባላት በማስተባበር ሂደቱን በማፋጠን ሁሉም የሰበካ አስተዳደሩ አባላት በገዛ ፍቃዳቸው ከሥራቸው ለመልቀቅ መወሰናቸውን ለአጠቃላይ ሕዝብ አሳወቁ። ይህ ማስታወቂያ ሲነገርም አባ ግርማ ከበደ ቀደም ብለው ያዘጋጇቸው ተወካዮቻቸው የሰበካውን ከሥራ መልቀቅ በታላቅ ደስታ መቀበላቸውን ለመግለጽ ሲሉ በቤተ ክርስቲያን ውስጥ የጭብጨባ ድምጽ አሰሙ።

ሌላው ዕለቱ የሰርግና ምላሽ ያህል የሆነላቸው የሚመስሉት አባ ግርማ ከበደ የሰበካውን ከሥራ መልቀቅ የምትቀበሉና አስመራጭ ኮሚቴ መቋቋሙን የምትደግፉ በጭብጨባ ግለጹ ወይም እጃችሁን አውጡ በማለት አሳሳች መልዕክት በማስተላለፍ በሳቸው አስተሳሰብ ለሰበካው ከሥራው መልቀቅ ማስረጃ ይሆነኛል ብለው ያሰቡትን ጭብጨባና እጅ የማውጣት ተግባር ባዘጋጁት የቪዲዮ ቀራጭ አማካኝነት እንዲ ቀረጽ አደረጉ።

ሰዎች ጥያቄ አለን ብለው እጃቸውን ሲያወጡና ሲጮሁ አባ ግርማ ከበደ የሕዝቡን ጥያቄ በመናቅ "ለመጨረሻው ጸሎት እንነሳ!!" በማለት ክፉ ስራቸውንና ተንኮላቸውን በሃይማኖት ሥርዓት በመሸፈን ስብሰባውን ሊዘጉት ችለዋል።

ይህ ሕገውጥ ድርጊትና አካሄድ በሕዝቡ ውስጥ ከፍተኛ ቁጣን በመቀስቀሱ የቤተ ክርስቲያን አባላትና ተቆርቋሪዎች የሰበካ አስተዳደሩ ነገሩን ፈጥኖ እንዲያርምና እንዲያስተካክል በቃል እና በጽሑፍ ቢያሳስቡም አባ ግርማ ከበደ የሰበካ አስተዳደሩ ሕግን ባልተከተለና ደንብን በጣሰ ሁኔታ ተግባሩን እንዲቀጥልበት በማድረጋቸው በ14/10/2012 የተደረገው የጠቅላላ ጉባኤ ስብሰባ ላይ ከፍተኛ ብጥብጥና ሁከት ሊፈጠር ችሏል።

ከብዙ ብጥብጥና ሁከት በኋላ በመጨረሻ ጉባኤው ጉዳዩ ወደ ጥምር ጉባኤው ተመልሶ ሕግና ደንብን በጠበቀ ሁኔታ ውይይት ተደርጎበት የውሳኔ ሃሳብ ይዞ ይቅረብ የሚል ውሳኔ በማስተላለፍ ተጠናቀቀ።

የጥምር ጉባኤዎቹ ተሰብስበው ከተወያዩ በኋላ አዲስ የሰበካ አስተዳደር ጉባኤ ለማስመረጥ የሚያስችል ሁለት አማራጮችን ይዞ ቀርቧል በማለት ሕዝቡ ሁለቱን አማራጮች አጢኖ ድምጽ እንዲሰጥበት ቀረበ።

ከጽሑፍ አይተን እንደተረዳነውና የሰበካ አስተዳድሩ አባላት እንዳብራሩልን ከሆነ ሁለት አማራጮች የተባሉት አንዱ በሥራ ላይ ባለው የውስጥ መተዳደሪያ ደንብ መሠረት ለሚቀጥሉት ሶስት ዓመታት የሚያገለግል የተሟላ የሰበካ አስተዳደር ጉባኤ ይመረጥና ይተካ የሚል ሲሆን ሌላው ደግሞ ለህዝብ የቀረበው የውስጥ መተዳደሪያ ደንብ እስከ

ሚፀድቅ ድረስ ጊዚያዊ የሰበካ አሰተዳደር ይቋቋምና ደንቡ ሲጸድቅ በአዲሱ ደንብ መሠረት የተሟላ የሰበካ አስተዳደር ይቋቋም የሚል ነው።

የሁለቱም አማራጮች ጥቅምና ጉዳታቸው ተገልጾ አባላት ነገሮችን በሚገባ እስኪገነዘቡት ውይይት ካካሄዱ በኋላ ይህ ለቤተ ክርስቲያኗ ይጠቅማል፤ የሚሉትን አማራጭ ወስደው መወሰን አንዳችም መራቀቅን የማይጠይቅ ተግባር ሆኖ ሳለ ሁለቱንም አማራጮች የደብሩ የሰበካ አስተዳደር ጉባኤ ጸሐፊ ካነበበ በኋላ፤ ቄስ ዳዊት ካህናቱ ለሚደግፉት ሃሳብ (ምርጫ አንድ) ብቻ ሰፋ ያለ ማብራሪያ ከሰጡ በኋላ በምእመናን ከፍተኛ ግፊት ቄስ ዳዊት እኔ ይምጋራው ይህን አንደኛ አማራጭ ሀሳብ ስለሆነ ስለሁለተኛው ምርጫ የሀሳቡ ባለቤቶች የናገሩ፤ እኔ ስለማላምንበት ጉዳይ ማብራራት አልችልም ተገቢም አይሆንም በማለት ተቀመጡ።

በጣም በሚያአዝንና በሚያሳፍር ሆኔታ አባ ግርማ ከበደ እዛው ዓውደ ምህረት ላይ ሁለተኛው አማራጭ አንጼ ተነቧል በቂ ነው ብለው ቄስ ዳዊትን ሲቆጡ የታይ ነበር። ይህንንም በመከተል አባ ግርማ ያዘጋጇቸው ረብሻ አቀጣጣዮች መጮህና መሳደብ ስለጀመሩ ማብራሪያው ሳይሰማ እንዲቀር ሊያደርጉት ችለዋል።

በዚህ መሠረት በአባላት ግፊትና ትግል ሕጋዊ መንገድን ያዘ ተብሎ ተስፋ የተጣለበት የጥምር ጉባኤው አማራጭ ሃሳብ ከጠቅላላ ጉባኤው ለውሳኔ መቅረብ እንደተለመደው ስብሰባውን የሚመሩት ካህናት የስብሰባ አመራር ሥርዓትን ተከትለው በገለልተኝነት ስብሰባውን ባለመምራትና በሚያሳዩት የጎላ አድልኦ ምክንያት ተቃውሞ በማስነሳታቸውና እነሱን ለምን ትቃወማላችሁ የሚል የነሱ ደጋፊ ሆኖ የተሰለፈው ወገን ደግሞ በሌላ ወገን ሆኑ ሁከት በመፍጠሩ ስብሰባው በረብሻ ሊሞላ ችሏል።

እዚህ ላይ በግልጽ መታወቅ ያለበት የተሟላ የሰበካ አስተዳደር ጉባኤ ይመረጥ የሚለው ሃሳብ ሕዝብ ተወያይቶበት ቢፈልግ አሻሽሎ ካመነበትም እንዳለ እንዲያጸድቀው የታደለውን የውስጥ መተዳደሪያ ደንብ ረቂቅ ሂደት በማስቆም ተተኪው አዲሱ የሰበካ አስተዳደር በሚፈልገው መንገድ እንዲያስኬደው በር የሚከፍት በመሆኑ የቀረበውን ረቂቅ የማይደግፉትና ረቂቁ ውድቅ ሆኖላቸው ሌላ ለራሳቸው በሚያመች ደንብ እንዲተካላቸው የሚችሉትን ሁሉ በማድረግ ላይ የሚገኙት አባ ግርማ ከበደ የዚህ አማራጭ አራማጅ መሪና አስተባባሪ ነበሩ።

የሁለተኛው አማራጭ ደግሞ ቀድሞም ቢሆን የሰበካ አስተዳደሩ የአገልግሎት እድሜ ከተራዘመበት ምክንያት አንዱና ዋንኛው በሥራ ላይ ያለው የውስጥ መተዳደሪያ ደንብ አዲስ የሰበካ አስተዳደር ጉባኤ ለማስመረጥ የማያስችል ብዙ ጉድለት ያለበትና ቤተ ክርስቲያኗ የንብረት ባለቤት መሆኗን እንኳ እውቅና የማይሰጥና፤ ከፍተኛ የሕግ መጓደል ያለበት፤ በዚህም ምክንያት በቤተ ክርስቲያኗ ላይ ለተነሱ ከፍተኛ ሙግትና ክስ በር የከፈተ ስለሆነ ለጊዜው ካልሆነ በስተቀር ከአዲሱ ደንብ መጽደቅ በፊት ለዘለቄታው የሚሆን የተሟላ የሰበካ አስተዳደር ለማስመረጥ መሞከር ከጥቅሙ ይልቅ ጉዳቱ የላቀ መሆኑን በግልጽ የሚያስቀምጥ ነበር።

ከዚህ በተጨማሪ ብዙዎቻችን ጠልቀን የማናውቀው Trust Deed የተባለ በቤተ ክርስቲያኗና በቻሪቲ ከሚሽን መሃል የተገባ ውል ይህቺ ቤተ ክርስቲያን በUK የምትገኝ እስከሆነ ድረስ በሕግ ፊት ተቀባይነት ያለው ይኸው ሰነድ በመሆኑ ይህ ሰነድ ደግሞ የቤተ ክርስቲያኗን ሃብት ለሌላ አካል አጋልጦ የሚሰጥና ብዙ ግድለቶችን ያካተተ  ሆኖ ሳይሻሻል ለ20 ዓመት የዘለቀ በመሆኑ ይህም ከአዲሱ ረቂቅ መጽደቅ ጋር የሚሻሻል ስለሆነ ይህ እንዳለ ሆኖ ቋሚ የሰበካ አስተዳደር ማስመረጥ ጉዳት ካልሆነ ጥቅሙ እንደማይታይ ትልቁ አሳማኝ ነጥብ ሆኖ ሊቀርብ የሚችል ነው።

ይህ ሁሉ ሲገመገም ታዲያ የተሟላ የሰበካ አስተዳደር ጉባኤ ይመረጥ የሚለው መከራከሪያ ነጥብ ለቤተ ክርስቲያኑ ጥቅም ያስገኛል ከሚል ሃሳብ ሳይሆን የተጀመረውን የውስጥ መተዳደሪያ ደንብ ለማስቆምና ከሃዲዱ አስወጥቶ ለመጣል እንደሆነ ለመረዳት አዳጋች አይሆንም ።

የዕለቱን ስብሰባም ሆነ በሌሎች ስብሰባዎች ላይ የሚደርሰውን የሰው መራበሽ ሁሉም እየተነሳ ሕዝቡንም ሆነ ግለሰቦችን ለመክሰስና ለመኮነን ይሞክር እንጂ በተክክል ከታየ ለረብሻው ለብጥብጡና በአጠቃላይ ለሚደርሰው ባጎ ያልሆነ ተግባር ሁሉ በአንደኛ ደረጃ ተጠያቂውና ጥፋተኛው የቤተ ክርስቲያኗ አስተዳዳሪ እና የሰበካ አስተዳደሩ ነው።

አንድን ቤተ ክርስቲያን እንዲመራና እንዲያስተዳድር ሙሉ ኃላፊነት የተጣለበትን የሰበካ አስተዳደር Management Committee በበላይነት የሚመራና የሚያስተባብር የሃይማኖት አባት አሳዳሚ፤ የአንድን ወገን ሃሳብ ደጋፊና የሌላውን ወገን ተቃዋሚ ግንባር ቀደም ተዋናኝ ሆኖ ከቶ እንዴት አይነት አስተዳደር፤ አመራርና ፍትሕ ሊሰፍን ይችላል ተብሎ ይጠበቃል?

እዚህ ላይ የሚገርመው በተለይ አባ ግርማ ከበደ የቤተ ክርስቲያን አስተዳዳሪ ከመሆናቸውም በተጨማሪ መነኩሴ ሆነው በቤተ ክርስቲያን ውስጥ ታይቶና ተሰምቶ የማይታወቅ እጅግ አስፋሪ ተግባር ሲከናወን የሳቸው ደጋፊዎች ለሚሰነዝሩት መጥፎ ቃላት ጆሮ ዳባ ልበስ በማለት ለማጋለጥና ይቃወሙኛል ብለው የሚያስቧቸውንና የሚጠሏቸውን ወገኖች ደግሞ ለማስጠላትና ለማሳጣት ያደርጉት የነበረው ጥረት እጅግ የሚያሳዝንና የሚሳፍር ነበር።

በዚህ ሁኔታ የተነሳውን ረብሻ ሕግን ተጠቅሞም ሆነ ተቆጥቶና ገስጾ የሚያስቆምና የሚያበርድ፤ ወይም አንተም ተው አንቺም ተይ የሚል አንዳችም ለእግዚአብሔርና ለእውነት ያደረ የሃይማኖት አባት ወይም የአስተዳደር አካል ባለመገኘቱ መርሃ ግብሩን መቀጠል ሳይቻል ቀርቷል።

በመጨረሻም ይህንን የተገነዘቡ አንዳንድ አስተዋይ የቤተ ክርስቲያኗ አባላት በሰዎች መሃል ሰላምና ፍቅር ሳይኖር ምንም ነገር መሥራትም ሆነ መወሰን ስለማይቻል በቅድሚያ ሰላምና እርቅ ይወረድ በማለታቸው በመጨረሻ የሰበካ አስተዳደሩ የሰላምና የእርቅ ተግባር የሚፈጽሙ የተለያዩ ሃሳቦችን ከሚወክሉ አካላት አውጣጥቶ እንዲያዋቅር ቤቱ ውሳኔ አስተላልፎ ስብሰባው ሊዘጋ ችሏል።

***ይህ ከተወሰነ በኋላ የሰላምና የእርቁስ ሁኔታ እንዴት እየተካሄደ ነው?***

***እውነተኛ ሰላምና እርቅን ማን ይፈልጋታል? ሰላምና እርቅን ተገን በማድረግ ደግሞ የራሱን ዓላማ ዕቅድ ለመፈጸም ማን እየሰራ ነው?***

አቅሙንና ሃብቱን አስተባብሮ ከእግዚአብሔር ጋር ይህቺን ቤተ ክርስቲያን ላለችበት ደረጃ እንድትደርስ ያስቻላት በብዙ ሺህ ማይል ከሃገሩ ኢትዮጵያ ርቆ በባዕድ ሃገር በስደት ላይ የሚገኘው የቤተ ክርስቲያኗ አባላልና ደጋፊ ሁሉ በቤተ ክርስቲያን ውስጥ ሰላምና እርቅ ሰፍኖ ያለምንም እንከን ራሱንና ቤተ ሰቡን በሃይማኖት አንጾና መንፈሳዊ ምግብን ተመግቦ ተቀድሶና ተባርኮ ከመኖር የበለጠ ሌላየሚመኘው ነገር አይኖረውም።

በእርግጥም ይህ የሰላምና የእርቅ ሂደት እንደ ሰዎች ክፋትና ተንኮል ሳይሆን እንደ እግዚአብሔር ፍቃድ ስኬታማ ሆኖ ለማየት የሚቻል በመሆኑ ይህ ተግባራዊ ይሆን ዘንድ ሁላችንም ተግተን ፈጣሪያችንን በጸሎት መለመን ይኖርብናል።

ይህ እንዳለ ሆኖ ግን ይህ ሰላምና እርቅ የተባለው ሂደት እንዳይሳካ አሁንም አባ ግርማ ከበደ ምን እያደረጉ እንዳሉና ሁሉም ሰው ለሰላምና ለእርቅ ቢነሳ እንኳ እሳቸው ግን በክፉ መንፈሳቸው እየተመሩ ክፋትና ተንኮልን ከመስራት እንዳልታቀቡ ያገኘነውን እውነተኛ መረጃ እናካፍላችሁ።

ለሳላምና ለእርቅ ኮሚቴው አባልነት የሚመረጡ ሰዎችን አልመልክቶ አባ ግርማ ከበደ ከመጋረጃው ጀርባ የሰሩትን ሥራ የኮሚቴው አባላት ሥም ዝርዝር ይፋ ሲሆን በግልጽ እንደምንረዳው ለኮሚቴ አባልነት ከተመረጡ ሰዎች አካባቢ የተገኘው መረጃ ስለሚያመለክት ያንን በታላቅ ጉጉት እንጠብቃለን።

ከዚህ ውጪ አባ ግርማ ከበደ ለሰላምና እርቅ ኮሚቴ አባላት የተመረጡ ሰዎችን ሰላምና እርቅን አስፍኑ ከማለት ይልቅ ስልክ እየደወሉና በአካል እያገኙ የሚሰጧቸው መመሪያና የሚያደርጉት መማጸን ለውይይት የቀረበውን የውስጥ መተዳደሪያ ደንብ ተቃወሙ፤ እሱ ካለ ሰላም የለም በማለት እየወተወቱ እንደሆነ ተረጋግጧል።

አሁንም ሰው ሰላምና እርቅ ሲል  አባ ግርማ ከበደ ግን የደንቡን ረቂቅ ሕዝቡ ቢያሻው ለማሻሻል፤ ቢያሻው ሊቀይረው፤ ያ ካልሆነ ደግሞ እንዳለ ለመቀበል ሙሉ መብቱ መሆኑን ባለመቀበል ራሳቸውን ከሕዝብ አብልጠው በማየት የደንቡ ረቂቅ የሳቸውን የግል ፍላጎትና ዓላማ ስላላሟላ ብቻ በሳቸው ፍላጎትና ተንኮል ውድቅ እንዲሆንላቸው በክፉ ተግባራቸው ቀጥለውበት ይገኛሉ።

ከቶ የሰላምና የፍቅር አምላክ ቸሩ መድሐኒ ዓለም ይህንን ምን ይለዋል? ለዚህ ፍርዱስ ምን ይሆን?

በክፉ መንፈስ እየተመሩ የቤተ ክርስቲያናችንን ሰላምና አንድነት በማናጋት ሕዝብን በሕዝብ ላይ የሚያስነሱና በወሬና በአሉባልታ ህዝብ እርስ በርሱ እንዲጋጭ የሚያደርጉ ፈጣሪ ፍርዱን ይስጣቸው!! እኛ ግን ለሰላምና እርቅ ተግተን እንጸልይ፤ በርትተን እንስራ።

ቸሩ መድኃኔዓለም በቤተ ክርስቲያናችን ውስጥ ሰላምና እርቅን ያስፍንልን!!